

# መግቢያ

እቺን ትንሽ ጥቅል ስለ ባምቦ ድንጋዮች አሰራር ምንነት እና ወደ ድምጽ የመቀየር ሂደት በትንሹ የዳሰሰኩባት እና ሰንጄ ለማስቀመጥ ያበጀዋት ነች። እቺ ትንሽ ጥማር ለመደበኛ አንባቢዎች የተዘጋጀች ወይንም እንደ ስነ ጽሁፍ የቀረበች ሳትሆን ለራሴ የጻፍኳት ሙከራ ነች። ለምታስተውሉት የቃላት እና የሰራአተ ነጥብ ግድፈት አቅላቹን በመጠቀም ለማስተካከል ሞክሩ።

ካምላክ ታዬ

# የመጀመሪያው ድንጋይ

የመጀመሪያው ድንጋይ በምስሉ ላይ ምትመለከቱት የተሰራው ከመኪና ጎማ ቅርጽ ከያዘ ጭቃ ክረምት ላይ ነበር ከቦታው ላይ በዝናብ ውሀ የተሰራ ነው በዛው መንገድ ሌሎችም የሳራዋቸው በርከት ያሉ ድንጋዮች ቢኖሩም ለማድረቅ ምጠቀምበት ዘዴ በጸሀይ ስለነበር ገሚሱ ሲሰነጠቅ ገሚሶቹ ሊፈረካከሱ ችለዋል።



የመጀመሪያው ድንጋይ

የመጀመሪያው ድንጋይ በምስሉ ላይ ምትመለከቱት የተሰራው ከመኪና ጎማ ቅርጽ ከያዘ ጭቃ ክረምት ላይ ነበር ከቦታው ላይ በዝናብ ውሀ የተሰራ ነው በዛው መንገድ ሌሎችም የሳራዋቸው በርከት ያሉ ድንጋዮች ቢኖሩም ለማድረቅ ምጠቀምበት ዘዴ በጸሀይ ስለነበር ገሚሱ ሲሰነጠቅ ገሚሶቹ ሊፈረካከሱ ችለዋል።

# ዶሮዳንጎን ማግኘት



ዶሮዳንጎ (Dorodango) የጃፓን የሰነ ጥበብ አይነት ሲሆን ድቡልቡል የጭቃ ኳስ ወደሚል ትርጓሜ ይጠጋጋል። ዶሮዳንጎ ብዙ ግዜ በ ጃፓን ህጻናት የሚከወን የጥበብ አይነት ነው። ይህ ጥበብ ድቡልቡል የጭቃ ኳሶች በማበጀት እንስኪያንጸባርቁ በመወልወል የሚበጅ ነው። የሚሰራው በ አፈር ፣ ውሀ ብርጭቆ እና ጨርቅ በመጠቀም ነው ስለ ዶሮዳንጎ በቂ መረጃ የ Bruce Gardner Dorodango በሚለው መጸሀፉ ላይ በሰፊው ተቀምጧል።

ወደ ባምቦ ድንጋዩች ስንመጣ ከዶሮዳንጎ የወሰዳቸው እና ሚያመሳሰላቸው ብዙ ነገሮች አሉ ከ አሰራሩ ጀምሮ እስከአጨራረሱ። ስለ ዶሮዳንጎ ሳላቅ በፊት ምሰራቸው ድንጋዮች ለፈራሽነት የቀረቡ እና የላይኛቸው ሽፋናቸው ወጥ ያልሆነ ነበር። (ወጥ ሚለውን አጥብቀን እናንብብ ወገን)

# እንዴት ይሰራል?

የሚያስፈልጉ ግብአቶች
አፈር (ማንኛውም አሸዋ ያልበዛበት ይሆናል)
ወንፊት
የተነፋውን አፈር ማስቀመጫ እና ማቡኪያ እቃ
ፌስታል ወይም ማንኛውም የፕላስቲክ ከረጢት
ከተገኘ እጅ ነገር (ከተገኘ)

ድርጊት:1 አፈሩን መንፋት
አፈሩን በወንፊት ከነፋነው በኋላ ደቃቁን ለጥቅማችን እስቀርተን ኮረቱን እናስወግዳለን

ድርጊት:2 ቅርጽ ማሰያዝ
በዚኛው ዘዴ የምንሰራው ድንጋይ እምብዛም ቅርጻ ቅርጽ ለመስራት ስለማያስችለን መደበኛ የሆነ ቅርጽ እንደ ድቡልቡል ብንሰራበት ይመረጣል። ተመጣጣኝ ውሀ ጋር ደቃቁን አፈር በመቀላቀል ቅርጽ እናሲዛለን ለመጀመር እና ለመረዳት ድቡልቡል ቅርጽን ብንጠቀም ሀዬ ነው። (ለቡሃላ የሚሆን አፈር እናስቀር)

ድርጊት:3 ሽፋን
ያበጀነውን ቅርጽ ቅድም ያስተረፍነውን ደቃቅ አፈር ዙሪያውን በማልበስ ወደ ፌስታል ወይንም ማንኛውም የፕላስቲክ ከረጢት ውስጥ እናደርገዋለውን። ይህም ድንጋያችን ውስጥ ያለውን እርጥበት በዝግታ እንዲያወጣ ይረዳናል።

ማስጠንቀቂያ
ለማድረቅ ጸሀይ ላይ ካረግነው ሊሰነጠቅ ይችላል!

ድርጊት:4
አንድ ሌሊት ካሳደርነው በኋላ ከፌስታሉ በማውጣት ደቃቁን አፈር እጃችን ላይ በማድረግ የድንጋያችንን የላይኛውን ክፍል እናሸብታለን በመሀል የመሰንጠቅ ምልክት ካሳየ የተሰነቀጠው ቦታ ላይ ትንሽ ውሀ ቀብቶ እናደገና አፈር በማልበስ ወደ ፌስታሉ መክተት

ድርጊት:5
ወደ መለስተኛ ጥንካሬ ሲመጣ የፈለግነውን ቅርጽ ማሰያዝ መጀመር። እላዩ ላይ ሰም መጻፍ እንዳሻቹ

ድርጊት:6
ይሄ ሁላ ተግባራት ስናልፍ ድንጋዩን በማንሰራበት ጊዜ ፌስታል ውስጥ ማስቀመጥ እንዳንረሳ! የፈለግነውን ቅርጽ ካሲያዝን ቡሃላ በተረፈን ደቃቅ አፈር ድንጋዩን እያሹ ማልበስ በመቀጠልም ጠንከር ወደማለቱ ሲመጣ ከላይ በድጋሚ አፈር እያለበሱ በለስላሳ ጨርቅ እና እጅ በመወልወል የመጨረሻውን የድንጋይ ሽፋን ወደ ወጥነት መቀየር ነው። እዚህ ደረጃ ላይ ከላይ የፈለግነውን አይነት አፈርም ሆነ ንጹ አሸዋ መጠቀም እንችላለን የተለያዩ የአፈር አሸዋ አይነቶች የራሳቸው ልባስ-መልክ (texture) ይሰጣሉ ይህን በምናደርግበት ወቅት ድንጋዩ ወደማንጸባረቅ ደረጃ ይደርሳል ካበዛነውም ከላይ ያለው ሽፋን ወደ ቅርፊትነት ስለሚቀየር መጠንቀቅ ያስፈልጋል

“ከዛ ድንጋይ አላቹ ማለት ነው
ስፈልጉ ፈንክቱበት ስፈልጉ ሽጣቹ ዳቦ ግዙበት”



# ቅርጽ ያላቸውን የመስሪያ ዘዴ

ቅርጽ ያላቸውን የመስሪያ ዘዴ
ቅርጽ ያላቸውን ድንጋዮች ለመስራት አፈራችን ውስጥ በርከት ያለ የሸክላ ቅንጣት ያስፈልገናል ሸክላ ማለት ከ አፈር ውስጥ የሚገኝ በይዘት ትንሽዬ የሆነ ቅንጣት ነው ባጭሩ ይህ ቅንጣት ማንኛውም አፈር ውስጥ ሊገኝ ይችላል አሁን ምናየው ድርጊት እንዴት አፈር ውስጥ ያለውን የሸክላ ቅንጣት እንደምናወጣ እና እንደምንጠቀም ይሆናል

የሚያስፈልጉን ግብአቶች
ውህ መያዣ እቃ(እኔ የተጠቀምኩት ባለ 5 ሊትር የዘይት እቃ ከ አፉ በኩል በመቁረጥ ኦማር ዘይት ይልሀል)
ጨርቅ ውህ ሊያሳልፍ ሚችል ግን ሰፋፊ ቀዳዶች የሌሉት(በጣም ስስ እንዳይሆን እኔ T-shirt ተጠቀምኩ)

ድርጊት፡1
መጀመሪያ በርከት ያለ ውህ በመጨመር እና አብሮ አፈሩን በማደባለቅ እና እስኪሰክን መጠበቅ (20 ደቂቃ በቂ ነው ግን እንደተመቻቹ)

ድርጊት፡2
በቅንጣት ትንሽ የሆኑት ከላይ ከውህው ጋር ሲቀሩ በይዘት እና በቅንጣት ትልቅ የሆኑት ከታች ዘቅጠው ይገኛሉ ለዚህ ሙከራ ምንፈልገው በቅንጣት ትንሾቹን ስለሆነ እነሱላይ እናተኩራለውን

ድርጊት፡3
ጨርቃችንን ዉሃ በላይ በኩል እንዳያፈስ አርገን ካዘጋጀን በኋላ የጠለውን ውሃ ከላይ ያለውን ክፍል ብቻ ወደጨርቁ እንጨምራለን ከዛንም ቀስ ብለን ጨርቁን ከቋጠርን በንፋስ እንዲደርቅ ከፍ አድርገን እንሰቅለዋለን (ከተቻለ አንድ ሌሊት)

ድርጊት፡4
ከደረቀልን ቡሃላ ሩዝ የተቀቀለበት ውህ በመጠቀም ጨርቅ ውስጥ የደረቀውን አፈር ለማለስለስ መሞከር

ድርጊት፡5
ቀጥሎም የፈለግነውን ቅርጽ ማስያዝ። ይሄኛው ከከቀድሞ የድንጋይ ዘዴ የበለጠ የሸክላ ይዘት ስላለው የፈለግነውን ቅርጽ ለማስያዝ ቦታ ይሰጠናል እንደ ቀድሞ ድንጋይ በ አፈር ማሸት አያስፈልግም። ተመራመሩበት ግን

# ድንጋዮቹን በድምጽ

ድንጋዮቹን በድምጽ
ድንጋዮቹን ወደ ቅጂነት የመቀየር ሙከራ የተደረገው በዋናነት የንክኪ-ድምጽ-መቅጃን (contact microphone) በመጠቀም ነው (contact microphone) ድምጽን ከአየር ሞገድ ይልቅ ከቁስ ጋር በንክኪ በሚገናኙ ነገርች የሚፈጥሩትን እንቅስቃሴ(እርግብግቢት) የሚቀዳልን መሳሪያ ነው። ይህን ምሳሪያ ድንጋዮቼ ላይ በማጣበቅ ከላይ በመፋቅ፣የተለያዩ መሳሪያዎች እንደ ካሊምባ አሰደግፎ በመጫወት፣እላያቸው ላይ በመጮህ ነው። በመቀጠልም ድምጾቹን በመሰብሰብ ወደ ዲጂታል ድምጽ ማሳነጃ (DAW) በመክተት እንደ granular synthesis softwere በመጠቀም የድምጽ ቅንጣቱን በመደጋገም ነው። ብዙም ባይሆንም ትንሽዬ ወደ ሙዚቃነት ባህሪይ እንዲጠጋ አርጌያለው። ነገር ግን ጥሬ የሆኑ ድምጾችን እንዲጎሉ ስለፈለኩ በተቻለኝ አቅም ላለመነካካት ሞክሬያለው እነዚህንም ቅጂዎች ሰብሰቤ በዘጠኝ ክፍል በመክፈል የ1 ሰአት ገደማ ቅጂ ከ Invisible Animal Records ጋር በመሆን ለአድማጭ ተሰናድቷል።



